# የሕጻናት መብቶች ኮንቬንሽን

# CONVENTION ON THE RIGHTS OF THE CHILD



ጥር 1984 አዲስ አበባ
Jan / 1992 Addis Ababa

የሕጻናት ፣ ወጣቶችና ቤተሰብ ደኅንነት ድርጅት
CHILDREN, YOUTH AND FAMILY WELFARE ORGANIZATION

# የሕጻናት መብቶች ኮንቬንሽን

# CONVENTION ON THE RIGHTS OF THE CHILD

Brought to you by

www.binyamhk.wordpress.com



ጥር 1984 አዲስ አበባ
Jan / 1992 Addis Ababa

የሕጻናት ፣ ወጣቶችና ቤተሰብ ደኅንነት ድርጅት
CHILDREN, YOUTH AND FAMILY WELFARE ORGANIZATION

# መቅድም

በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ጠቅላላ ጉባኤ እ.ኤ.አ. ታኅሣሥ 20 ቀን 1989 ዓ.ም. ጸድቆ ከመስከረም 2 ቀን 1990 ዓ.ም. ጀምሮ በሥራ ላይ የዋለውን የሕጻናት መብቶች ኮንቬንሽን የኢትዮጵያ ሽግግር መንግሥት የተወካዮች ምክር ቤት ኅዳር 29 ቀን 1984 በአደረገው ስብሰባ ተቀብሎ አጽድቋል ። ይህም የሽግግሩ መንግሥት ለሕጻናት መብቶችና መልካም አስተዳደግ የሰጠውን ትኩረት የሚያረጋግጥ ነው ። በዚህ መሠረት የሕጻናት ፣ ወጣቶችና ቤተሰብ ደኅንነት ድርጅት ከተሰጠው የሥራ ኃላፊነት አኳያ ለሕጻናት መብቶች መከበር በቅድሚያ ኮንቬንሽኑን ለኅብረተሰቡ ማስተዋወቅ አስፈላጊ መሆኑን ተረድቶ ይህን ትርጉም አዘጋጅቷል ።

ድርጅቱ ኮንቬንሽኑን ወደ አማርኛ ተርጉሞ ለማሳተም የፈለገበት ምክንያት፣

1. አባል አገሮች የኮንቬንሽኑን መርሆዎችና ድንጋጌዎች ለሕጻናትም ሆነ ለአዋቂዎች ተገቢ በሆነ መንገድ በሰፊው ለማስተዋወቅ እርምጃ ይወስዳሉ የሚለውን የኮንቬንሽኑን ግዴታ ተግባራዊ ለማድረግ ፣

2. ኮንቬንሽኑን ለሕጻናት ደኅንነት አስተዋጽኦ ለሚያደርጉና አገልግሎት ሰጪ ለሆኑ ልዩ ልዩ ድርጅቶች ለማስተዋወቅና ግንዛቤያቸውን ለማሳደግ ፣

3. በአጠቃላይ ኅብረተሰቡ ስለሕጻናት መብቶች የአለውን ግንዛቤ ከፍ በማድረግ ሕጻናት መልካም አስተዳደግ እንዲኖራቸው ነው ።

የኮንቬንሽኑ የትርጉም ሥራ በዚህ ብቻ የሚያቆም ሳይሆን ለወደፊትም አቅምና ሁኔታ በፈቀደ መጠን በልዩ ልዩ የአገሪቱ ብሔረሰብ ቋንቋዎች በመተርጎም የሕጻናት መብቶች በሕዝቡ ዘንድ በሚገባ እንዲታወቁ ጥረት ይደረጋል ።

በመጨረሻም ይህን የሕጻናት መብቶች ኮንቬንሽን ትርጉም ለማሣተም በገንዘብ ለረዳን ለተባበሩት መንግሥታት የሕጻናት መርጃ ድርጅት ( ዩኒሴፍ ) ከፍተኛ ምሥጋናችንን እናቀርባለን ።

የሕፃናት ፣ ወጣቶችና ቤተሰብ
ደኅንነት ድርጅት





# መግቢያ

የዚህ ኮንቬንሽን አባል አገሮች ፣

በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ቻርተር በተደነገጉት መርሆዎች መሠረት የሰው ልጅ ሰብአዊ ክብር ፣ እኩልነትና የማይገሰሱ መብቶች በዓለም ላይ የነጻነት ፣ ፍትሕና ሰላም መሠረቶች መሆናቸውን በማወቅ ፣

የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት አባል አገሮች ሕዝቦች በድርጅቱ ቻርተር ለመሠረታዊ ሰብአዊ መብቶችና የሰው ልጅ ሰብአዊ ክብር ያላቸውን እምነት ማረጋገጣቸውን፣ እንደዚሁም ማኅበራዊ ዕድገትና የተሻለ የኑሮ ሁኔታ ለማስገኘት ያላቸውን ቁርጠኛነት መግለጻቸውን በማስተዋል ፣

ማንኛውም ሰው ምንም ዓይነት የዘር ፣ የቀለም ፣ የጾታ ፣ የቋንቋ ፣ የሃይማኖት የፖለቲካ ወይም የሌላ አመለካከት ፣ የዜግነት ወይም የብሔር ፣ የንብረት ፣ የመወለድ ወይም ሌላ የማኅበራዊ ኑሮ ደረጃ ማበላለጥ እንዳይደረግበት በዩኒቨርሳል ሰብአዊ መብቶች ድንጋጌ ( Universal Declaration of Human Rights ) እና በሰብአዊ መብቶች ዓለም አቀፍ ኮቬናንት (International Covenants of Human Rights) መደንገጉንና ማንም ሰው የእነዚህ መብቶችና ነፃነቶች ተጠቃሚ መሆኑን በመገንዘብ፣

ሕጻናት ልዩ ክብካቤና ዕርዳታ እንዲደረግላቸው በዩኒቨርሳል ሰብአዊ መብቶች ድንጋጌ (Universal Declaration of Human Rights) መገለጹን በማስታወስ፣

ቤተሰብ የኅብረተሰብ መሠረትና ለአባሎቹ በተለይም ለሕጻናት ዕድገትና ደኅንነት ተስማሚ የሆነ የተፈጥሮ ተቋም መሆኑን ፣ በዚህ ምክንያት ቤተሰብ በኅብረተሰብ ውስጥ ያለውን ኃላፊነት በሚገባ ለመወጣት እንዲችል አስፈላጊው ጥበቃና እገዛ ሊደረግለት እንደሚገባ በማመን ፣

ሕጻናት የሰብእና ዕድገታቸው የተሟላና የተስተካከለ እንዲሆን በቤተሰብ ውስጥ በደስታ ፣ በፍቅርና በመግባባት መንፈስ ማደግ እንደሚያስፈልጋቸው በመገንዘብ ፣

በኅብረተሰብ ውስጥ ሕጻናት የራሳቸውን ሕይወት ለመምራት በሚችሉበት ሁኔታ ማዘጋጀት ፣ በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ቻርተር መንፈስ መሠረት ፣ በተለይም የሰላም ፣ የሰው ልጅ ክብር ፣ መቻቻል ፣ ነጻነት ፣ ዕኩልነትና አንድነት መንፈስ ይዘው እንዲያድጉ አስፈላጊ መሆኑን በማወቅ ፣

ለሕጻናት ልዩ ክብካቤ ማድረግ እንደሚያስፈልግ እ.ኤ.አ. በ1924 ዓ.ም. በወጣው የጄኔባ ዓለም አቀፍ የሕጻናት መብቶች ድንጋጌ ፣ እና በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት እ.ኤ.አ. ታኅሳስ 20 ቀን 1959 ዓ.ም. በጸደቀው ዓለም አቀፍ የሕጻናት መብቶች ድንጋጌ በሚገባ የተመለከተ መሆኑንና በተጨማሪም በዩኒቨርሳል ሰብአዊ መብቶች ድንጋጌ (Universal Decaration of Human Rights) በሲቪልና ፖለቲካ መብቶች ዓለም አቀፍ ኮቬናንት ( International Covenant on Economic, Social and Cultural Rights ) በተለይ በአንቀጽ 23 እና 24 ፣ በኢኮኖሚ ፣ ማኅበራዊና ባሕላዊ መብቶች ዓለም አቀፍ ኮቬናንት ( International Covenant

on Economic, Social & Cultural Rights) በተለይ በአንቀጽ 10 ፣ እንደዚሁም ስለሕጻናት ደኅንነት በሚመለከታቸው የተባበሩት መንግሥታት ባለ ልዩ ሙያ ድርጅቶችና ዓለም አቀፍ ድርጅቶች ደንቦችና መመሪያዎች መገለጹን በማስተዋል ፣

በዓለም አቀፍ የሕጻናት መብቶች ድንጋጌ እንደተገለጸው “ ሕጻኑ በአካልና በአእምሮ ያልዳበረ በመሆኑ ምክንያት ከመወለዱ በፊትም ሆነ ከተወለደ በኋላ ልዩ ጥበቃና ክብካቤ እንደሚያስፈልገው” በማስተዋል ፣

በማኅበራዊና የሕግ መርሆዎች ድንጋጌ ስለ ሕጻናት ጥበቃና ደኅንነት በተለይ ስለፎስተር አገልግሎት ፣ የአገር ውስጥና የውጭ አገር ጉዲፈቻ ፣ የተመለከተውን ፣ የቤጂንግ ደንብ በመባል በታወቀው የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት የወጣት አጥፊዎች ፍትሐዊ አስተዳደር መመሪያ እና በአደጋና በጦርነት ጊዜ ለሴቶችና ለሕጻናት ስለሚደረግላቸው ልዩ ጥንቃቄ በወጣው ድንጋጌ የተመለከቱትን ጉዳዮች በማስታወስ ፣

በዓለም ላይ በሁሉም አገሮች በከባድ ችግርና አደጋ ላይ የወደቁ ሕጻናት መኖራቸውንና እነዚህ ሕጻናት ልዩ ትኩረት እንደሚያስፈልጋቸው በመገንዘብ ፣

የእያንዳንዱ ሕዝብ ባሕልና ወግ ለሕጻናት ጥበቃና የተስተካከለ ዕድገት የሚኖረውን ጠቀሜታ ከግምት ውስጥ በማስገባት ፣

በእያንዳንዱ አገር በተለይም በታዳጊ አገሮች የሕጻናትን የኑሮ ሁኔታ ለማሻሻል ዓለም አቀፍ ትብብር ያለውን ጠቀሜታ በመገንዘብ ፣ እንደሚከተለው ተስማምተዋል ።





# ክፍል አንድ

## አንቀጽ 1

በዚህ ኮንቬንሽን ሕጻን ማለት በሀገሩ ሕግ መሠረት ከዚህ በአነሰ ዕድሜ አካለ መጠን ካልደረሰ በቀር ዕድሜው ከ18 ዓመት በታች የሆነ ማንኛውም ሰው ነው ።

## አንቀጽ 2

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በግዛታቸው ክልል የሚገኝ እያንዳንዱ ሕጻን በራሱ ወይም በወላጆቹ ወይም በአሳዳጊው ዘር ፣ ቀለም ፣ ጾታ ፣ ቋንቋ ፣ ሃይማኖት ፣ የፖለቲካ ወይም ሌላ አስተሳሰብ ፣ ዜግነት ፣ ነገድ ወይም የትውልድ ሥፍራ ፣ ሀብት ፣ የአካልና የአእምሮ ጉድለት ፣ ትውልድ ወይም ሌላ የማኅበራዊ ኑሮ ደረጃ ምክንያት ምንም ዓይነት መድልዎ ሳይደረግበት የመብቱ ተጠቃሚ እን ዲሆን በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን መብቶች ያከብራሉ ፣ ተግባራዊነታ ቸውንም ያረጋግጣሉ ።

2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻኑ በወላጆቹ ፣ በአሳዳጊዎቹ ወይም በቤተሰቦቹ የማኅበራዊ ኑሮ ደረጃ ፣ ተግባሮች ፣ አመለካከት ወይም እምነት ምክንያት መድልዎ እንዳይደረግበትና አላግባብ ቅጣት እንዳይደርስበት ለማረጋገጥ ተገቢ የሆኑ እርምጃዎችን ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 3

1. ሕጻናትን በሚመለከቱ ጉዳዮች ሁሉ መንግሥታዊ ወይም የግል የማኅበራዊ ደኅንነት ተቋሞች ፣ ፍርድ ቤቶች ፣ የአስተዳደር ባለሥልጣኖች ወይም የሕግ አውጪ አካላት እርምጃዎች ሲወሰዱ የሕጻናቱ ጥቅምና ደኅንነት ከማንኛውም ቅድሚያ ይሰጣቸዋል ።

2. የወላጆች ፣ የአሳዳጊዎች ወይም በሕግ ኃላፊነት የተሰጣቸው የሌሎችም ሰዎች መብቶችና ግዴታዎች እንደተጠበቁ ሆነው የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለሕጻናት ደኅንነት የሚያስፈልገውን ጥበቃና ክብካቤ ሁሉ ያደርጋሉ ። ለዚ ህም ተገቢ የሆኑ የሕግና የአስተዳደር እርምጃዎችን ይወስዳሉ ።

3. ለሕጻናት ክብካቤና ጥበቃ ኃላፊነት የአለባቸው ተቋሞችና አገልግሎት ሰጪ ድርጅቶች በሕጻናት ጉዳይ ሥልጣን በአላቸው አካላት የወጡ ደረጃዎች ማሟላታቸውን በተለይም አደጋ በመከላከል ፣ በጤና አጠባበቅ ፣ በሠራተ ኞች ብዛትና ጥራት ፣ እንደዚሁም ክትትል ረገድ በወጡት ደረጃዎች መሠ ረት መፈጸማቸውን የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ማረጋገጥ አለባቸው ።

## አንቀጽ 4

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን የሕጻናት መብቶች ተግባራዊ ለማድረግ አስፈላጊ የሆኑ የሕግ ፣ የአስተዳደርና ሌሎችም እርምጃ

ዎች ሁሉ ይወስዳሉ ። ኢኮኖሚያዊ ፣ ማኅበራዊና ባሕላዊ መብቶችን በሚመለከት አባል አገሮች የሚወስዱት እርምጃ የየአገራቸው ሀብት በሚፈቅደው መጠንና አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ዓለም አቀፍ ትብብር በሚፈቅደው አኳኋን ይሆናል ።

## አንቀጽ 5

ወላጆች ፣ ወይም አግባብነት ሲኖረው የቤተዘመድ አባላት ፣ ወይም የአካባቢው ባሕል ሲፈቅድ ኅብረተሰቡ ፣ አሳዳጊዎች ወይም ለሕጻኑ አስተዳደግ በሕግ ኃላፊነት የተሰጣቸው ሌሎች ሰዎች ሕጻኑ በዚህ ኮንቬንሽን በተመለከቱት መብቶች ሲጠቀም ከችሎታው ጋር የተገናዘበ ተገቢ አመራር በመስጠትና በመቆጣጠር ረገድ ያላቸውን ኃላፊነት ፣ መብትና ግዴታ የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ያከብራሉ ።

## አንቀጽ 6

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ማንኛውም ሕጻን የመኖር መብት እንዳለው ያውቃሉ ፤

2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በሚቻላቸው ሁሉ ሕጻናትን ከሞት የማዳን እርምጃና የሕጻናትን ዕድገት ያረጋግጣሉ ።

## አንቀጽ 7

1. ማንኛውም ሕጻን እንደተወለደ በልደት ( የክብር ) መዝገብ ይመዘገባል።ከልደት ጀምሮ መጠሪያ ስምና ዜግነት የማግኘት መብት እንደዚሁም በተቻለ መጠን ወላጆቹን የማወቅና ከወላጆቹ ክብካቤ የማግኘት መብት አለው ።

2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በራሳቸው ብሔራዊ ሕጎችና በዚህ ረገድ በዓለም አቀፍ ስምምነቶች በአለባቸው ግዴታ መሠረት በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱት የሕጻናት መብቶች ተግባራዊ መሆናቸውን ያረጋግጣሉ ። በተለይ ሕጻኑ ዜግነት የሌለው ሆኖ ሲገኝ አባል አገሮች ዓለም አቀፍ ስምምነቶች የማክበር ግዴታ አለባቸው ።

## አንቀጽ 8

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻኑ ማንነቱን ለመጠበቅ ያለውን መብት ያከብራሉ ፣ ዜግነቱን ፣ ስሙንና በሕግ የታወቀ የቤተሰብ ዝምድናውን የሚቀናቀኑ ሁኔታዎችን ይከላከላሉ ።

2. ሕጻኑ ሕጋዊ ባልሆነ መንገድ በከፊልም ሆነ በሙሉ ማንነቱን የሚመለከቱ መብቶች ሲነፈግ የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሕጻኑ ማንነት በአፋጣኝ እንደገና የሚረጋገጥበትን ዕርዳታ ይሰጣሉ ፣ ጥበቃ ያደርጋሉ ።

## አንቀጽ 9

1. ፍርድ ቤቶች ውሳኔውን ለመለወጥ ያላቸው መብት እንደተጠበቀ ሆኖ ፣ በሕግ መሠረትና ተገቢው ሥነ ሥርዓት ተሟልቶ ሥልጣን ያላቸው አካላት ከወላጆቹ መለየት ለሕጻኑ ጥቅምና ደኅንነት አስፈላጊ ነው ካላሉ በቀር ማንኛውም ሕጻን ያለፈቃዱ ከወላጆቹ እንዳይለይ የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ያረጋግጣሉ ።

የመለየቱ ውሳኔ በተለይ አስፈላጊ ሲሆን የሚችለው ሕጻኑ በወላጆቹ ክብ ካቤ ሳይደረግለት በደልና ጉስቁልና ሲደርስበት ፣ ወይም ወላጆቹ በመለያየታቸው ምክንያት የሕጻኑን መኖሪያ ሥፍራ መወሰን አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ነው ።

2. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 1 መሠረት ስለ ሕጻኑ ከወላጆች መለየት ውሳኔ በሚሰጥበት ጊዜ ጉዳዩ የሚያገባቸው ወገኖች በክሱ ተካፋይ የመሆንና ሀሣባቸውን የመግለጽ ዕድል ይሰጣቸዋል ።

3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ከሕጻኑ ጥቅምና ደኅንነት አንጻር ተቃራኒ ሆኖ ካልተገኘ በቀር ከአንዱ ወይም ከሁለቱም ወላጆቹ የተለየ ሕጻን ከወላጆቹ ጋር ያለውን የግል ግንኙነት የመጠበቅና አዘውትሮ ወላጆቹን የመጐብኘት መብቱ እንዲጠበቅ ያደርጋሉ ።

4. ሕጻኑ ከወላጆቹ የተለየው በአባል አገሩ ውሳኔ ሲሆን ፣ ለምሳሌ በአንዱ ወይም በሁለቱም ወላጆች ወይም በሕጻኑ በቁጥጥር ስር መዋል ፣ ወህኒ ቤት መግባት፣ መሰደድ ፣ ከአገር መባረር ወይም መሞት ( በእስር ቤት መሞት ጭምር ) ሲሆን የኮንቬንሽኑ አባል አገር ሲጠየቅ ለወላጆቹ ፣ ለሕጻኑ ወይም አግባብነት ሲኖረው ለቤተሰቡ ስለጠፋው የቤተሰቡ አባል አስፈላጊ የሆኑ መረጃዎችን መስጠት አለበት ። ሆኖም መረጃው ለሕጻኑ ደኅንነት አደገኛ ሲሆን ይህ ተፈጻሚነት አይኖረውም ። ከዚህ በተጨማሪ አባል አገሮች መራጃውን ማስተላለፉ ራሱ ፣ በጉዳዩ አግባብ በአላቸው ሰዎች ላይ ጉዳት አለማምጣቱን ማረጋገጥ አለባቸው ።

## አንቀጽ 10

1. በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 1 በተመለከተው የአባል አገሮች ግዴታ መሠረት ከቤተሰብ ጋር ለመቀላቀል ሲባል ወደ አገር ለመግባት ወይም ከአገር ለመውጣት በሕጻኑ ወይም በወላጆቹ የሚቀርበውን ማመልከቻ የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በቀና መንፈስ ፣ ሰብአዊ በሆነ ሁኔታና በአፋጣኝ ይመረምራሉ ። አባል አገሮች በተጨማሪ ይህ ማመልከቻ በጠያቂዎቹም ላይ ሆነ በቤተሰቦቻቸው ላይ ጉዳት የማያስከትል መሆኑን ያረጋግጣሉ ።

2. ወላጆቹ በሌላ አገር የሚገኙ ሕጻን የተለየ ሁኔታ ካላጋጠመ በቀር በየጊዜው ከወላጆቹ ጋር ለመገናኘትና ወላጆቹን ለመጐብኘት ያለው መብት ይጠበቅለታል ። ለዚህና በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 1 ለተመለከተው የአባል አገሮች ግዴታ ተፈጻሚነት የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻኑ ወይም ወላጆቹ ከአገር ለመውጣት ( የራሳቸውን አገር ጨምሮ ) እንደዚሁም ወደአገር ተመልሶ ለመግባት ያላቸውን መብት ያከብራሉ ። ከአገር በመውጣት መብት ላይ የሚኖሩት ገደቦች በሕግ የተደነገጉ ፣ ለብሔራዊ ጸጥታ ፣ ለሕዝብ ደኅንነት ፣ ለሕዝብ ጤና ወይም ሞራል ወይም ለሌሎች ሰዎች መብቶችና ነጻነቶች ሲባል ብቻ የሚደረጉና በዚህ ኮንቬንሽን ከተመለከቱት መብቶች ጋር የማይጻረሩ ናቸው ።

## አንቀጽ 11

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻናትን በሕገወጥ መንገድ ከአገር የማስወጣትና ወደ አገር እንዳይገቡ የማስቀረት ድርጊቶችን ለመከላከልና ለመቆጣጠር አስፈላጊ የሆኑ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

2. ለዚህ ተግባርም አባል አገሮች በሁለት ወይም ከዚያ በላይ በሆኑ አገሮች መካከል ስምምነት መደረጉን ፣ ወይም ይህን በሚመለከት የተደረጉ ስምምነቶች አባል መሆንን ይደግፋሉ ፣ ያበረታታሉ ።

## አንቀጽ 12

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች እርሱን በሚመለከቱ ጉዳዮች ላይ የራሱ ሀሣብ ያለው ሕጻን ያለምንም ፍርሐት ሃሣቡን ለመግለጽ መቻሉን ያረጋግጣሉ ። ሕጻኑ የሚያቀርበው ሀሳብ እንደ ዕድሜውና የአእምሮ ዕድገቱ ተገቢ ክብደት ይሰጠዋል ።

2. ለዚህ ዓላማ ሕጻኑ በአገሩ ሕግ መሠረት በቀጥታ ራሱ ወይም በወኪሉቹ ወይም አግባብ ባለው አካል አማካይነት እርሱን በሚመለከቱ የፍርድ ቤት ወይም የአስተዳደር ክሶች ላይ ሃሣብ የማቅረብ ዕድል ይሰጠዋል ።

## አንቀጽ 13

1. ሕጻኑ ሃሣቡን የመግለጽ ነጻነት ይኖረዋል ። ይህም ነጻነት የአገሮች ድንበር ሳያግደው በቃል ፣ በጽሑፍ ወይም በሕትመት ወይም በሥነ ጥበባት ዘዴ ወይም በማንኛውም የሕጻኑ ምርጫ በሆነ የመገናኛ ዘዴ መረጃዎችን ፣ ልዩ ልዩ ዓይነት ሀሣቦችን የመጠየቅ ፣ የመቀበልና የማስተላልፍ መብትን ይጨምራል ።

2. ይህ መብት በሥራ ላይ ሲውል አንዳንድ ገደቦች ሊኖሩ ይችላሉ ። ሆኖም ገደቦቹ በሕግ የተደነገጉና ፤

   ሀ. የሌሎችን መብቶችና ክብር ለማስከበር ፣ ወይም ፣

   ለ. የአገር ደኅንነት ወይም የሕዝብ ፀጥታ ወይም ጤንነት ወይም ሞራል ለመ

   ጠበቅ የሚያስፈልጉ ብቻ ይሆናሉ ።

## አንቀጽ 14

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሕጻናትን ፣ የሀሣብ ፣ የሕሊና እና የሃይማኖት ነጻነት ያከብራሉ ።

2. አባል አገሮች ሕጻናት ከዕድገታቸው ጋር በተመጠጠነ ሁኔታ የመብታቸው ተጠቃሚ እንዲሆኑ ወላጆች እና እንደሁኔታው አሳዳጊዎች አመራር ለመስጠት ያላቸውን መብትና ኃላፊነት ያከብራሉ ።

3. ሃይማኖትን ወይም እምነትን የመግለጽ ነጻነት የሚደረጉበት ገደቦች በሕግ የተገለጹና ለሕዝብ ደኅንነት ፣ ጸጥታ ፣ ጤንነትና ሞራል ወይም ለሌሎች ሰዎች መሠረታዊ መብቶችና ነጻነቶች አስፈላጊ የሆኑ ብቻ ናቸው ።

## አንቀጽ 15

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሕጻናትን በማኅበር የመደራጀት እና ሰላማዊ ስብሰባን የማድረግ መብቶችን ያከብራሉ ።

2. ሕጉ ከሚጠይቃቸው እና ዲሞክራሲ በአለበት ኅብረተሰብ ለብሔራዊ ደኅንነት ፣ ጸጥታ ፣ ለሕዝብ ጤናና ሞራል ወይም ለሌሎች ሰዎች መብትና ነጻነት አጠባበቅ አስፈላጊ ከሆኑ ገደቦች በቀር በእነዚህ መብቶች አጠቃቀም ላይ ምንም ገደቦች አይደረጉም ።

## አንቀጽ 16

1. ማንም ሕጻን በግል ኑሮው ፣ በቤተሰቡ ፣ በመኖሪያ ቤቱ ወይም በደብዳቤ መልዕክቱ ላይ በዘፈቀደ የሚደረግና ከሕግ ውጭ የሆነ ተጽዕኖ አይደረግበትም፣ እንደዚሁም ክብሩንና ዝናውን የሚያጐድፍ ሕገወጥ ድርጊት አይፈጸምበትም።

2. ሕጻኑ ከእነዚህ ተጽዕኖዎችና ድርጊቶች በሕግ የመጠበቅ መብት አለው ።

## አንቀጽ 17

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የመገናኛ ብዙሐንን ጠቃሚ አገልግሎት ያውቃሉ ፣ እንደዚሁም ሕጻኑ ከተለያዩ ብሔራዊና ዓለም አቀፍ ምንጮች መረጃዎችንና ቁሳቁሶችን ለማግኘት መቻሉን በተለይም ማኅበራዊ ፣ መንፈሳዊና ሞራላዊ ደኅንነቱንና አካላዊና አእምሮአዊ ጤንነቱን ለመጠበቅ የሚያስችሉትን መረጃዎችና ቁሳቁሶች ማግኘቱን ያረጋግጣሉ ። ለዚህ ተግባራዊነት አባል አገሮች ፣

ሀ. በዚህ ኮንቬንሽን አንቀጽ 29 መሠረት መገናኛ ብዙሐኑ ለሕጻኑ ማኅበራዊና ባሕላዊ ሕይወት ጠቃሚ የሚሆኑ መረጃዎችና ቁሳቁሶች እንዲያሰራጩ ያበረታታሉ ፤

ለ. በተለያዩ ፣ ባሕላዊ ብሔራዊና ዓለም አቀፍ ምንጮች የሚደረጉ የመረጃዎችና የቁሳቁሶች ምርትን ፣ ልውውጥንና ሥርጭትን የሚመለከቱ ዓለም አቀፍ ትብብሮች ያበረታታሉ ፣

ሐ. የሕጻናት መጻሐፍትን ሕትመትና ስርጭት ያበረታታሉ ፣

መ. የመገናኛ ብዙሐን በተለይ የአናሳ ብሔረሰቦች ሕጻናት በራሳቸው ቋንቋ መጠቀም ላይ ትኩረት እንዲያደርጉ ያበረታታሉ ፤

ሠ. የዚህ ኮንቬንሽን አንቀጽ 13 እና 18 እንደተጠበቁ ሆነው ሕጻናት ለደኅንነታቸው አደገኛ ከሆኑ መረጃዎችና ቁሳቁሶች የሚጠበቁባቸው መመሪያዎች እንዲወጡ ያበረታታሉ ።

## አንቀጽ 18

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለሕጻኑ አያያዝና አስተዳደግ ሁለቱም ወላጆች የጋራ ኃላፊነት እንዳለባቸው የሚያስገነዝበውን መርህ መረዳታቸውን ለማረጋገጥ የሚቻላቸውን ሁሉ ያደርጋሉ ። ወላጆች ወይም እንደሁኔታው አሳዳጊዎች ለሕጻኑ አያያዝና አስተዳደግ የመጀመሪያ ደረጃ ኃላፊነት አለባቸው ። ዋናው ዓላማቸው የሕጻኑ ጥቅምና ደኅንነት ይሆናል ።

2. በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን የሕጻናት መብቶች ተግባራዊነት ለማረጋገጥና ለማበረታታት የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለወላጆችና ለአሳዳጊዎች የሕጻናት አያያዝና አስተዳደግ ኃላፊነታቸውን በብቃት ለመወጣት እንዲችሉ

ተገቢውን ዕርዳታ ይሰጣሉ ፡ ለሕጻናት አገልግሎት የሚሰጡ ተቋሞችና ድር ጅቶች መቋቋማቸውን ያረጋግጣሉ ።

3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ወላጆቻቸው ሠራተኛ የሆኑ ሕጻናት የአገልግሎት መስጫ ተቋሞችና ድርጅቶች ተጠቃሚዎች እንዲሆኑ ለማረጋገጥ ተገቢ እር ምጃዎችን ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 19

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻናት በወላጆቻቸው ወይም በአሳዳጊዎቻቸው ወይም በሌሎች ሰዎች ቁጥጥር ስር በሚገኙበት ጊዜ ማንኛውም ዓይነት በአ ካላቸው ወይም በአእምሮአቸው ላይ ጉዳት የሚያመጣ ድብደባ ፡ ለጉዳትወይም ጉስቁልና የሚዳርግ አያያዝ ፡ በቸልታ መጣል ወይም መንገላታት ፡ ለሰው የሚገባ ክብካቤ ማጣት ወይም የጥቅም ማግኛ መሆን ፡ የግብረ ሥጋ ግንኙ ነት ለማድረግ መገደድ ጭምር እንዳይፈጸምባቸው ተገቢውን የሕግ ፡ የአስ ተዳደር ፡ የማኅበራዊና የትምህርት እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

2. የሚወሰዱቸውም የመከላከያ እርምጃዎች እንደሁኔታው ለሕጻኑም ሆነ ክብ ካቤ ለሚያደርጉለት ሁሉ የማኅበራዊ አገልግሎት ፕሮግራም ለማቋቋምና ችግ ሮቹ ሳይከሰቱ ለመከላከል የሚያስችል መመሪያ ማውጣትና በሕጻናት ላይ የሚፈጸሙ በደሎችን በሚመለከት ችግሮችን ለይቶ ማወቅን ፡ ስለሁኔታዎች ሪፖርት ማቅረብን ፡ ወደሚመለከተው መምራትን ፡ ሁኔታዎችን ማጣራትን፡ የሕክምና አገልግሎት መስጠትንና ክትትል ማድረግን እንዲሁም አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ጉዳዩን ወደ ፍርድ አካሎች መምራትን ይጨምራል ።

## አንቀጽ 20

1. ለጊዜው ወይም ለዘለቄታው ከቤተሰቡ ለተለየ ፡ ወይም ለራሱ ደኅንነት ሲባል ከቤተሰቡ እንዲለይ ለተደረገ ሕጻን መንግሥት ልዩ ጥበቃና ዕርዳታ ያደርግ ለታል ።

2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች እንደየራሳቸው ብሔራዊ ሕግ ለዚህ ዓይነቱ ሕጻን አማራጭ አገልግሎቶች ይሰጣሉ ።

3. እነዚህም አገልግሎቶች የፎስተር አገልግሎትን ፡ በእስልምና ሕግ ካፋላን ፡ ጉዲፈቻን ወይም አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ የሕጻናት ማሳደጊያ አገልግሎትን ይጨ ምራሉ ። ለችግሮቹ መፍትሔ በመፈለግ ረገድ ሕጻኑ የማይቋረጥ መልካም አስተዳደግ ስለሚያገኝበት ሁኔታ ፡ እንዲሁም ስለሕጻኑ ብሔረሰብ ፡ ሃይማኖት ቋንቋና ባሕል ትኩረት ይደረጋል ።

## አንቀጽ 21

ጉዲፈቻን እንደመፍትሔ የሚቀበሉ ወይም የሚፈቅዱ አገሮች ዋና ዓላማ ቸው የሕጻናት ጥቅምና ደኅንነት ሆኖ ፡

ሀ. ጉዲፈቻው አግባብ በአለው ሕግና ሥነ ሥርዓት ፡ እንደዚሁም በተፈላጊና አስተማማኝ መረጃዎች መሠረት ሥልጣን በአላቸው አካላት መፈቀዱን ፡

ሕጻኑ ወላጆች ፣ ዘመዶች ወይም አሳዳጊዎች እንዳለውና እንደሌለው ፣ እንደ ዚሁም ለሕጻኑ ኃላፊነት ያለባቸው ስለጉዲፈቻው ዓላማ ከተረዱ በኋላ መስማ ማታቸው ወይም አለመስማማታቸው ታውቆ ጉዲፈቻው የሚቻል መሆኑን ያረጋግጣሉ ።

ለ. ሕጻኑ በፎስተር አገልግሎት ወይም በጉዲፈቻ አድራጊ ቤተሰብ ወይም በሌላ ተስማሚ ዘዴ በአገር ውስጥ ሊረዳ ካልቻለ በአገሮች መካከል የሚፈጸም ጉዲፈቻ አማራጭ መፍትሔ መሆን እንዳለበት ያውቃሉ ።

ሐ. በአገሮች መካከል በሚፈጸም ጉዲፈቻ የሚረዳው ሕጻን በአገር ውስጥ ለሚ ፈጸም ጉዲፈቻ የሚደረጉ ጥንቃቄዎችና የአገልግሎት ደረጃዎች እንዲጠበ ቁለት ያረጋግጣሉ ።

መ. በአገሮች መካከል በሚፈጸም ጉዲፈቻ የሕጻኑ ውጭ አገር መሔድ ጉዳዩን ለሚያስፈጽሙ የገቢ ማግኛያ ዘዴ እንዳይሆን ተገቢ የሆኑ እርምጃዎች ይወ ሰዳሉ ።

ሠ. አስፈላጊ ሲሆን ስለ ጉዲፈቻ ከሌላ አገር ወይም አገሮች ጋር ስምምነት በማ ድረግ ፣ እንደዚሁም ሕጻኑ በጉዲፈቻ ወደ ውጭ አገር ከመሔዱ በፊት በዚህ ተግባር ሥልጣን በአላቸው አካላት ወይም ድርጅቶች እንዲፈቀድ በማድረግ የዚህን አንቀጽ ዓላማ ያስፈጽማሉ ።

## አንቀጽ 22

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ስደተኛ ለመሆን የሚጠይቅ ሕጻን ፣ ወይም አግባብ በአላቸው ዓለም አቀፍ ሕጉች ወይም ብሔራዊ ሕጉችና መመሪያዎች ስደተኛ ነው የሚባል ሕጻን ብቻውንም ሆነ ከወላጆቹ ወይም ከሌሎች ሰዎች ጋር ቢሆን የዚህ ኮንቬንሽን መብቶች እና የሌሎች ዓለም አቀፍ ሰብአዊ መብቶች ወይም ራሳቸው ተካፋይ የሆኑባቸው ሰብአዊ ስምምነቶች ተጠቃሚ እንዲ ሆን የሚያረጋግጡ ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

2. ለዚህ ዓላማ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅትና ሌሎች ሥልጣን ያላቸው በአ ገሮች ስምምነት የተቋቋሙ ድርጅቶች ወይም ከተባባሩት መንግሥታት ድር ጅትጋር ተባባሪ የሆኑ መንግሥታዊ ያልሆኑ ድርጅቶች ስደተኛውን ሕጻን ለመንከባከብና ለመርዳት እንደዚሁም ከወላጆቹ ጋር ለማገናኘት የሚያስፈልጉ፣ ወላጆችን ወይም ሌሎች የቤተሰቡን አባሎች የሚመለከቱ መረጃዎች ለማፈ ላለግ ለሚያደርጉዋቸው ጥረቶች አባል አገሮች ተገቢ መስሉ የሚታያቸውን ትብብር ያደርጋሉ ።

ወላጆች ወይም ሌሎች የቤተሰቡ አባሎች ሊገኙ ካልተቻሉ ሕጻኑ ለዘለቄ ታው ወይም ለጊዜው በልዩ ልዩ ምክንያት ከቤተሰቡ ለተለየ ማንኛውም ሕጻን በዚህ ኮንቬንሽን መሠረት ከሚደረግለት ተመጣጣይ የሆነ ጥበቃና ክብካቤ ይደረግለታል ።

## አንቀጽ 23

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የአእምሮ ወይም የአካል ስንኩልነት ያላቸው ሕጻ ናት ሰብአዊ ክብራቸው ተጠብቆ ፣ በራሳቸው በመተማመን ፣ በኅብረተሰቡ

ውስጥ ንቁ ተሳትፎ እያደረጉ የተሟላና የተስተካከለ ኑሮ መኖር እንዳለባቸው ይገነዘባሉ ፣

2. አባል አገሮች ስንኩላን ሕጻናት ልዩ ክብካቤ የማግኘት መብት እንዳላቸው ያውቃሉ ፣ እንደዚሁም አቅም በፈቀደ መጠን ይህ ልዩ ክብካቤ የሚገባቸው ሕጻናትና በኃላፊነት የሚያሳድጉዋቸው ሰዎች ለሁኔታው ተስማሚ የሆነ ዕርዳታ ሲጠይቁ እንዲሰጣቸው ያበረታታሉ ፣ ማግኘታቸውንም ያረጋግጣሉ ፣

3. የስንኩላን ሕጻናትን ልዩ ፍላጐት በማሰብ፥በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 2 የሚሰጥ ዕርዳታ የወላጆችን ወይም የአሳዳጊዎችን የኤኮኖሚ አቅም በማመዛዘን ሲቻል በነጻ የሚሰጥ ሆኖ ሕጻናቱ አስፈላጊውን ትምህርት ፣ ሥልጠና ፣ የጤና አገልግሎት ፣ የተሐድሶ አገልግሎት ፣ የሥራ ስምሪት ዝግጅትና የመዝናኛ አገልግሎት እንዲያገኙ የታቀደ ፣ ይህም የሕጻናቱን ሙሉ ችሎታ የሚያሳድግ ከኅብረተሰቡ ጋር በሚገባ እንዲቀላቀሉ የሚረዳ ፣ ባሕላቸውንና እምነታቸውን በአጠቃላይ የግል ዕድገታቸውን የሚያፋጥን መሆን አለበት ።

4. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በዓለም አቀፍ ትብብር መንፈስ ስለስንኩላን ሕጻናት ጤና አጠባበቅ ፣ ሕክምና ፣ በሥነ አእምሮና ራስ በመቻል ረገድ ለአለባቸው ችግሮች ስለሚደረግላቸው ዕርዳታ የመረጃዎች ልውውጥ እንዲደረግ ይደግፋሉ ። ዓላማው በዚህ የሥራ መስክ አባል አገሮች የሚኖራቸውን ችሎታ የሚያሻሽልና የልምድ አድማሳቸውን የሚያስፋፉ ሆኖ የተሐድሶ ፣ ትምህርትና ስልጠና አገልግሎቶች መረጃዎችን ስርጭት ይጨምራል ።

## አንቀጽ 24

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በየአገራቸው ሊደረስበት በሚቻለው ከፍተኛ የጤና ደረጃ ፣ የሕክምናና የተሐድሶ አገልግሎት ፣ ሕጻናት ተጠቃሚ ለመሆን ያላቸውን መብት ይገነዘባሉ ። አባል አገሮች ማንኛውም ሕጻን እነዚህን አገልግሎቶች የማግኘት መብቱን እንዳይነፈግ ከፍተኛ ጥረት ያደርጋሉ ።

2. አባል አገሮች ይህ የሕጻናት መብት ሙሉ በሙሉ ሥራ ላይ መዋሉን ይከታተላሉ ፣ በተለይ የሚከተሉትን ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ፣

   ሀ. የጨቅላ ሕጻናትንና የሕጻናትን ሞት መጠን በእጅጉ መቀነስ ፣

   ለ. ከመሠረተ ጤና ክብካቤ ዕድገት አኳያ ለሕጻናት ሁሉ አስፈላጊ የሕክምናና የጤና አገልግሎቶች እንዲሰጡ ማረጋገጥ ፣

   ሐ. ከመሠረተ ጤና ክብካቤ አኳያ የአካባቢ መበከል የሚያስከትለውን ጠንቅ በመገንዘብ ፣ በታወቁ የቴክኖሎጂ ዘዴዎች በመጠቀም ፣ በቂና የተመጣጠነ ምግብ እንደዚሁም ንጹሕ የመጠጥ ውሃ አቅርቦት በሚኖርበት ሁኔታ በሽታንና የምግብ እጥረትና አለመመጣጠንን መከላከል ፣

   መ. ለነፍሰጡሮችና ለአጥቢ እናቶች ተገቢ የጤና አገልግሎት መስጠቱን ማረጋገጥ ፣

   ሠ. ማንኛውም የኅብረተሰብ ክፍል በተለይም ወላጆችና ሕጻናት ስለጤና አጠባበቅ እንዲያውቁ ፣ የመማር ዕድል እንዲኖራቸውና ስለ ሕጻናት ጤንነትና አመጋገብ ፣ የጡት ማጥባት ጥቅም እና የግልና የአካባቢ ንጽሕና ፣

እንደዚሁም የአደጋ መከላከል መሠረታዊ ዕውቀት እንዲኖራቸውና በተ ግባር እንዲያውሉት ማረጋገጥ ፣

ረ. የበሽታ መከላከያ ዘዴዎችን ፣ የቤተሰብ ምክር አገልግሎትና የቤተሰብ ምጣኔ ትምህርትና አገልግሎትን ማደራጀትና ማጠናከር ፣

3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለሕጻናት ጤና ጠንቅ የሆኑ ጐጂ ባሕሎችን ለማ ስወገድ ተገቢና ውጤት ሊያስገኙ የሚችሉ እርምጃዎችን ይወስዳሉ ።

4. በዚህ ኮንቬንሽን ለሕጻናት የተሰጡት መብቶች ደረጃ በደረጃ ሙሉ በሙሉ በሥራ ላይ ስለሚውሉበት ሁኔታ ዓለም አቀፍ ትብብር እንዲኖር ይደግፋሉ፣ ያበረታታሉ ። በዚህ ረገድ ለታዳጊ አገሮች ፍላጐቶች ልዩ ትኩረት ይሰጣል ።

## አንቀጽ 25

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የአካል ወይም የአእምሮ በሽታ ኖሮት ለክብካቤ ፣ ለጥበቃ ወይም ለሕክምና ለዚህ ኃላፊነት በተሰጣቸው ባለሥልጣኖች በተለየ ቦታ የተቀመጠ ሕጻን ስለሚሰጠው አገልግሎትና አጠቃላይ ሁኔታ በየጊዜው ግምገማ እንዲደረግለት መብት ያለው መሆኑን ይገነዘባሉ ።

## አንቀጽ 26

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች እያንዳንዱ ሕጻን የማኅበራዊ ዋስትና እና የማኅበ ራዊ መድን ዋስትና ተጠቃሚ የመሆን መብት እንዳለው ያውቃሉ ። በየአ ገራቸው ሕግ መሠረት ይህን መብት ሙሉ በሙሉ ተግባራዊ ለማድረግ አስ ፈላጊ እርምጃዎችን ይወስዳሉ ።

2. እነዚህ ጥቅሞች እንደአስፈላጊነቱ የሕጻኑንና እርሱን ለማሳደግ ኃላፊነት ያለ ባቸውን ሰዎች የኢኮኖሚና ሌሎች ሁኔታዎችን ፣ እንደዚሁም ለዚህ ዓላማ በማመልከቻ የሚገለጹ ሌሎች ምክንያቶችን በማገናዘብ መፈቀድ አለባቸው ።

## አንቀጽ 27

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች እያንዳንዱ ሕጻን ለአካላዊ ፣ አእምሮአዊ ፣ መንፈ ሳዊ ፣ ሞራላዊ እና ማኅበራዊ ዕድገት አስፈላጊ የሆነ የኑሮ ደረጃ የማግኘት መብ ቱን ይገነዘባሉ ።

2. ወላጆች ወይም ለሕጻኑ አስተዳደግ ኃላፊነት ያለባቸው ሌሎች ሰዎች ችሎታ ቸውና የገንዘብ አቅማቸው በሚፈቅደው መሠረት ለሕጻኑ ዕድገት አስፈላጊ የሆኑ የኑሮ ሁኔታዎችን በማመቻቸት ረገድ የመጀመሪያ ደረጃ ኃላፊነት አለ ባቸው ።

3. አባል አገሮች እንደተጨባጩ ብሔራዊ ሁኔታና እንደየአቅማቸው ፣ ወላጆችና ለሕጻኑ አስተዳደግ ኃላፊነት ያለባቸው ሌሎች ሰዎች ይህን መብት ተግባራዊ ለማድረግ የሚያደርጉትን ጥረት ለመርዳት ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ። ለዚህም እንደአስፈላጊነቱ በተለይ በምግብ ፣ አልባሳትና የመኖሪያ ቤት ረገድ ዕርዳታ ይሰጣሉ ።

4. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በአገር ውስጥም ሆነ በውጭ አገር ከሚገኙ ወላጆች ወይም ሕጻኑን ለማሳደግ ኃላፊነት ከአለባቸው ሌሎች ሰዎች ለሕጻኑ ማሳደ

ጊያ የሚያስፈልገውን አበል ለማግኘት የሚያስችሉ ተገቢ እርምጃዎችን ይወስዳሉ ። አባል አገሮች በተለይ ሕጻኑን ማሳደግ ያለበት ሰው ሕጻኑ ከሚገኝበት አገር ውጭ የሚኖር ከሆነ ለዚህ ተግባር የሚያገለግሉ ዓለም አቀፍ ስምምነቶችን ይቀበላሉ ፣ ወይም አዲስ ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ይፈራረማሉ ፣ በተጨማሪም ሌሎች ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 28

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሕጻናትን የትምህርት መብት ያከብራሉ ። ይህንንም መብት ለሁሉም እኩል ዕድል በመስጠት ደረጃ በደረጃ ተግባራዊ ለማድረግ ፣

   ሀ. የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት በግዴታና በነጻ ለሁሉም እንዲዳረስ ያደርጋሉ ።

   ለ. አጠቃላይ የሁለተኛ ደረጃ ትምህርትና የሙያ ትምህርት የሚይዙ ልዩ ልዩ የሁለተኛ ደረጃ ትምህርቶች እንዲስፋፉ ያበረታታሉ ፣ እነዚህን ትምህርቶች ለመማር እያንዳንዱ ሕጻን ዕድል እንዲኖረው ያደርጋሉ ፣ እንደዚሁም የነጻ ትምህርት ስለሚሰጥበትና ለችግረኛ ተማሪዎች የገንዘብ ዕርዳታ ስለሚደረግበት ሁኔታ ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

   ሐ. የከፍተኛ ትምህርት በችሎታ መሠረት ለሚገባቸው እንዲሰጥ ተገቢ ስልት ይቀይሳሉ ።

   መ. የትምህርትና የሙያ ሥልጠና መርጃና መመሪያ ሁሉም ሕጻናት ማግኘት እንዲችሉ ያደርጋሉ ።

   ሠ. ሕጻናት አዘውትረው በትምህርት ገበታ ላይ እንዲገኙና በፈተና የሚወድቁ ተማሪዎች ቁጥር እንዲቀነስ ለማበረታታት የሚረዱ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የትምህርት ቤት ዲሲፕሊን ከሕጻናት ሰብአዊ ክብርና ከዚህ ኮንቬንሽን ጋር በተጣጣመ ሁኔታ ተግባራዊ ስለሚሆንበት ተገቢ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በትምህርት ረገድ ዓለም አቀፍ ትብርር እንዲኖር ይደግፋሉ ፣ ያበረታታሉ ፣ በተለይም አለማወቅና መሐይምነት ከመላው ዓለም ስለሚወገድበት ፣ የሣይንስና ቴክኖሎጂ ዕውቀት እንደዚሁም ዘመናዊ የማስተማሪያ ዘዴዎች ስለሚስፋፉበት ሁኔታ ትኩረት ይሰጣሉ ። በዚህ ረገድ የታዳጊ አገሮች ፍላጐቶች ልዩ ትኩረት ይሰጣቸዋል ።

## አንቀጽ 29

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለሕጻኑ ትምህርት በሚከተሉት ላይ ትኩረት እንዲደረግ ተስማምተዋል ።

   ሀ. የሕጻኑ ስብዕና ፣ ተሰጥኦና የአእምሮና የአካል ችሎታዎች ሙሉ በሙሉ መዳበር ፣

ለ. የሰብአዊ መብቶች ፣ መሠረታዊ ነጻነቶችና የተባበሩት መንግሥታት መርሆዎች መከበር ፣

ሐ. ሕጻናት ለወላጆቻቸው ፣ ለባሕላዊ መለያቸው ፣ ለቋንቋቸውና እስተ ሳሰባቸው ፣ የሚኖሩበት እገር ከፍተኛ ግምት ለሚሰጣቸው ብሔራዊ እስተሳሰቦች እና ለሌሎች እገሮች ሥልጣኔዎች የሚኖራቸው አክብሮት ፣

መ. ሕጻናት ነጻ በሆነ ኅብረተሰብ ብቁ ዜጋ ሆነው እንዲያድጉና የመግባ ባት ፣ የሰላም ፣ የመቻቻል ፣ የጾታ እኩልነት ፣ የሕዝቦች ፣ የነገዶች፣የብ ሔሮችና የሃይማኖት ቡድኖች እንደዚሁም የጥንታዊ ሰፋሪዎች ወንድ ማማችነት መንፈስ ኖሯቸው እንዲያድጉ ማዘጋጀት ፣

ሠ. ለተፈጥሮ ሀብት መደረግ ስለሚገባው ክብካቤ ፣

2. ይህ አንቀጽ ወይም አንቀጽ 28 ግለሰቦች ወይም ድርጅቶች የትምህርት ተቋ ሞችን ለማቋቋምና ለመምራት ያላቸውን ነጻነት በሚቃረን መንፈስ አይተ ረጐሙም ። በዚህ ረገድ የሚኖሩት ገደቦች በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 1 የተ መለከቱትን መርሆዎች ማክበርና ስለትምህርት አሰጣጥ መንግሥት በየጊዜው የሚያወጣቸውን ደረጃዎች መጠበቅ ይሆናል ።

## አንቀጽ 30

ከአናሳ ብሔረሰቦች ፣ አነስተኛ ተከታይ ካላቸው ሃይማኖቶች ወይም አነስተኛ ቁጥር ያላቸው ሰዎች ከሚናገሩዋቸው ቋንቋዎች ወይም ጥንታዊ ሰፋሪዎች በሚገ ኙባቸው እገሮች ፣ ከነዚህ ቁጥራቸው አነስተኛ ከሆኑ ክፍሎች የተወለደ ሕጻን በኅብረተሰቡ ውስጥ ከሌሎች ሕጻናት ጋር አብሮ በሚኖርበት ጊዜ ፣ የራሱን ባሕል ለመከተል ፣ የራሱን ሃይማኖት ለማምለክ ወይም በራሱ ቋንቋ ለመናገርና ለመጻፍ ያለውን መብት አያጣም ።

## አንቀጽ 31

1. የኮንቬንሽኑ አባል እገሮች ሕጻናት ለዕድሜያቸው ተስማሚ በሆነ ሁኔታ ለመዝናናት ፣ ለመጫወት እንደዚሁም በባሕልና የሥነጥበብ ፕሮግራሞች እንደ ፍላጐታቸው ለመሳተፍ ያላቸውን መብት ያውቃሉ ።

2. አባል እገሮች ሕጻናት በባሕላዊና ሥነ ጥበብ ፕሮግራሞች ለመሳተፍ ያላቸ ውን መብት ያከብራሉ ፣ ይደግፋሉ እንደዚሁም የባሕል ፣ የሥነ ጥበብና የመዝናኛ ፕሮግራም ዕድል ለሁሉም ተስማሚ በሆነ መንገድ በእኩልነት እንዲዳረስ ያበረታታሉ ።

## አንቀጽ 32

1. የኮንቬንሽኑ አባል እገሮች ሕጻናት የኤኮኖሚ ብዝበዛ እንዳይደረግባቸው ፣ አደገኛ በሆነ የሥራ መስክ እንዳይሰማሩ ፣ ትምህርታቸውን የሚያሰናክል ለጤንነታቸው ፣ ለአካል ፣ አእምሮ ፣ መንፈሳዊ ፣ ሞራላዊና ፣ ማኅበራዊ ዕድ ገታቸው ተቃራኒ የሆነ ሥራ ላለመሥራት የአላቸውን መብት ያከብራሉ

2. በዚህ አንቀጽ የተመለከተው መብት ተግባራዊ መሆኑን ለማረጋገጥ አባል አገሮች የሕግ ፣ የአስተዳደር ፣ የማኅበራዊና የትምህርት እርምጃዎች ይወስዳሉ ። ለዚህና ለሌሎችም ዓለም አቀፍ ድንጋጌዎች ተፈጻሚነት በተለይ ፣

ሀ. ዝቅተኛውን የሥራ የዕድሜ ገደብ ይወስናሉ ።

ለ. ስለ ሥራ ሰዓትና የሥራ ሁኔታ ተገቢ ደንብ ያወጣሉ ።

ሐ. ይህ አንቀጽ በሚገባ ሥራ ላይ መዋሉን ለማረጋገጥ ተገቢ ቅጣቶች ይደነግጋሉ ።

## አንቀጽ 33

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻናት በአደገኛ ዕጾችና በዓለም አቀፍ ሕጐች ሱስ ያሲዛሉ በተባሉ አእምሮ አደንዛዦች እንዳይጠቀሙ እንደዚሁም ሰዎች እነዚህን አደገኛ ዕጾች በማምረት ወይም በማሰራጨት ረገድ በሕጻናት እንዳይጠቀሙ ለመከላከል ማንኛውንም ተገቢ እርምጃ ይወስዳሉ ፣ ይህም የሕግ ፣ የአስተዳደር ፣ የማኅበራዊና የትምህርት እርምጃዎችን ይጨምራል ።

## አንቀጽ 34

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻናትን በግብረ ሥጋ ከሚፈጸም ማንኛውም ብዝበዛና በደል ይጠብቃሉ ። ለዚህም ዓላማ አባል አገሮች ብሔራዊና የጋራ እርምጃዎች በመውሰድ የሚከተሉትን ይከላከላሉ ።

ሀ. ሕጻናትን በማባበል ወይም በማስገደድ በሕገወጥ የግብረ ሥጋ ግንኙነት ተካፋይ እንዲሆኑ ማድረግን ፣

ለ. ለብዝበዛ ዓላማ ሕጻናትን በአመንዝራ ተግባር ወይም በሌላ ሕገወጥ የግብረ ሥጋ ግንኙነት መጠቀምን ፣

ሐ. ለብዝበዛ ዓላማ ሕጻናትን ለአስነዋሪ ትርዒቶች ፣ ፎቶግራፎችና ፊልሞች መጠቀምን ፣

## አንቀጽ 35

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ለማንኛውም ዓላማ ወይም በማንኛውም መንገድ ሕጻናትን በኃይል አስገድዶ በመውሰድ ፣ በመሸጥ ወይም በማስተላለፍ የሚፈጸሙ ሕገወጥ ተግባሮች ለመከላከል ማንኛውንም ተገቢ ብሔራዊ ወይም የጋራ እርምጃዎች ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 36

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሕጻናትን ለደኅንነታቸው ተቃራኒ ከሆኑ ማንኛውም ዓይነት ብዝበዛዎች ይጠብቃሉ ።

## አንቀጽ 37

የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሚከተሉት አለመፈጸማቸውን ያረጋግጣሉ ፣

ሀ. ማንም ሕጻን በሚያሰቃይ ፣ ወይም ጭካኔ በተመላበት ኢሰብአዊ በሆነ ወይም ሰብአዊ ክብርን በሚቀንስ ቅጣት አይቀጣም ። ዕድሜያቸው ከ18 ዓመት በታች በሆኑ ሰዎች ለሚፈጸም ወንጀል የሞት ፍርድ ወይም የመፈታት ዕድል የሌለው የዕድሜ ልክ እሥራት አይፈረድም ።

ለ. ማንም ሕጻን ያለ ሕግ ወይም ከሥነሥርዓት ውጭ ነፃነቱን አይገፈፍም ። ሕጻናት የሚታሰሩት ፣ በቁጥጥር ስር የሚውሉት ወይም እሥር ቤት የሚገቡት ሕጉ በሚጠይቀው መሠረት ይሆናል ። ይህም በመጨረሻ አማራጭነት ብቻ የሚወሰድ እርምጃና ለአጭር ጊዜ የሚፈጸም ይሆናል ።

ሐ. የመዘዋወር ነጻነቱን የተገፈፈ ማንኛውም ሕጻን የዕድገት ደረጃው የሚጠይቀው ፍላጐት ሳይጓደል ርኅራሄና ሰብአዊ ክብር ባልተለየው ሁኔታ ክብካቤ ማግኘት አለበት ። በተለይም የመዘዋወር ነፃነት ያጣ ሕፃን ለራሱ ደኅንነት የሚጠቅም ካልሆነ በቀር ከአዋቂዎች መለየት አለበት ። የተለየ ሁኔታ ካላጋጠመ በቀር ከቤተሰቡ ጋር በደብዳቤም ሆነ በጉብኝት ግንኙነት የማድረግ መብት ይኖረዋል ።

መ. ማንኛውም የመዘዋወር ነጻነቱን ያጣ ሕፃን የጠበቃና ሌላም ተገቢ ዕርዳታ ወዲያውኑ ማግኘት አለበት ። የመዘዋወር ነፃነቱን የተነፈገሁት ከሕግ ውጭ ነው በማለት በፍርድ ቤት ወይም በሌላ ሥልጣን ያለው ነፃና ገለልተኛ የሆነ አካል ክስ የማቅረብና አስቸኳይ ውሳኔ የማግኘት መብት አለው ።

## አንቀጽ 38

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በጦርነት ጊዜ ለሕፃናት አግባብነት ያላቸው ዓለም አቀፍ የሰብአዊ መብቶች ሕጐችን ያከብራሉ ፣ መከበራቸውንም ያረጋግጣሉ።
2. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ዕድሜያቸው ከ15 ዓመት በታች የሆኑ ሰዎች በጦርነት ቀጥታ ተካፋይ እንዳይሆኑ የሚቻለውን ሁሉ እርምጃ በመውሰድ ያረጋግጣሉ ።
3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በጦር ኃይሎቻቸው ውስጥ ዕድሜያቸው 15 ዓመት ያልሞላቸው ሰዎች አይመለምሉም ። አባል አገሮች ዕድሜያቸው 15 ዓመት የሞላቸውን ነገር ግን 18 ዓመት ያልሞላቸውን ሰዎች በሚመለምሉበት ጊዜ በዕድሜያቸው ከፍ ለአሉት የምልመላ ቅድሚያ ይሰጣሉ ።
4. በጦርነት ጊዜ የሲቪሉን ሕዝብ ደኅንነት ለመጠበቅ በዓለም አቀፍ ሰብአዊ ሕጐች መሠረት አባል አገሮች በአለባቸው ግዴታ በጦርነት ችግር የደረሰባቸው ሕጻናት አስፈላጊውን ጥበቃና ክብካቤ ማግኘታቸውን ለማረጋገጥ ማንኛውንም ተገቢ እርምጃ ሁሉ ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 39

በእንክብካቤ እጦት ፣ በብዝበዛ ፣ ወይም በደል ፣ ስቃይ ወይም ማንኛውም ዓይነትየጭካኔ ተግባር ፣ ኢሰብአዊ ወይም የሰውን ክብር ዝቅ በሚያደርግ ቅጣት ፣ ወይም በጦርነት ምክንያት የተጐዳ ሕፃን የአካል ፣ የሥነ ልቡናና ፣ የማኅበራዊ ተሐድሶ እንዲያገኝ የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ማንኛውንም ተገቢ

የሆነ እርምጃ ይወስዳሉ። ይህ ዓይነቱ ተሐድሶና ከኅብረተሰቡ ጋር የማቀላቀል እርምጃ የሕጻኑን ጤንነትና በራስ መተማመን እንደዚሁም ሰብአዊ ክብር በሚያዳብር ሁኔታ መፈጸም አለበት ።

## አንቀጽ 40

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ ተላልፈሃል ተብሎ የተከሰሰ ወይም ሕጉን መተላለፉ የታወቀ ሕጻን ሰብአዊ ክብሩን በሚያሳድግና ለሰዎች መብትና መሠረታዊ ነጻነት ያለውን ስሜት በሚያዳብር ሁኔታ እንዲመረመር ያለውን መብት ያውቃሉ ። ይህም ከሕጻኑ ዕድሜ ፣ ከኅብረተሰቡ ጋር ለማቀላቀል ከአለው ፍላጐትና ሕጻኑ በኅብረተሰቡ ውስጥ ከአለው ገንቢ አስተዋጽኦ ጋር መታየት አለበት ።

2. ለዚህ ዓላማ ፣ አግባብ በአላቸው ዓለም አቀፍ ሕጐች መሠረት የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ፣ በተለይ የሚከተሉትን ያረጋግጣሉ ፣

ሀ. ማንም ሕጻን በወቅቱ በብሔራዊ ወይም ለም አቀፍ ሕግ ያልተከለከለን ድርጊት በመፈጸሙ ወይም ባለመፈጸሙ አይጠየቅም ፣ አይከሰስም ወይም የወንጀል ሕግን እንደተላለፈ አይቆጠርም ።

ለ. የወንጀል ሕግ ተላልፈሃል ወይም የወንጀል ሕግ በመተላለፍ ተከስሀል የሚባል ማንኛውም ሕጻን ቢያንስ የሚከተሉት ዋስትናዎች ይኖሩታል ።

1. በሕጉ መሠረት ጥፋተኛ ነው እስከሚባልበት ጊዜ ጥፋት እንዳልፈጸመ ይቆጠራል ።

2. የቀረበበት ክስ ወዲያውኑ በቀጥታ ይነገረዋል ። አስፈላጊ ሲሆን በወላጆቹ ወይም አሳዳጊዎቹ አማካይነት ይነገረዋል ። ሕጻኑ ለቀረበበት ክስ መከላከያ ለማዘጋጀትና ለማቅረብ የሕግ ወይም ሌላ ተገቢ ዕርዳታ ይደረግለታል ።

3. ለተከሰሰበት ወንጀል ያለምንም መዘግየት ፣ ሥልጣን በአለው፣ ነጻ በሆነና አድልዎ በማያደርግ አካል ወይም ፍርድ ቤት በሕጉ መሠረት ትክክለኛው ውሳኔ ይሰጠዋል ።በተለይ ዕድሜውን ወይም አጠቃላይ ሁኔታውን ፣ ወላጆቹን ወይም አሳዳጊውን ግምት ውስጥ በማስገባት ለራሱ ደኅንነትና ጥቅም ሲባል ካላስፈለገ በቀር ለሕጻኑ ውሳኔ የሚሰጠው የጠበቃ ወይም ሌላ ተገቢ ዕርዳታ ከተደረገለት በኋላ ነው ።

4. ሕጻኑ በእኩልነት ስም የምስክርነት ቃል ለመስጠት፣ወይም ጥፋተኛ ነኝ ብሎ ለማመን ፣ ወይም በመሰከሩበት የሕግ ምስክሮች ላይ ጥያቄ ለማቅረብ ወይም የራሱን ምስክሮች ለመመርመር አይገደድም ።

5. ሕጻኑ በወንጀል ከተፈረደበት ያለተጽዕናና አድልዎ በሕግ መሠረት በሚሠራ የበላይ አካል ወይም ፍርድ ቤት በውሳኔው ላይ የሚያቀርበው ይግባኝ ይታይለታል ።

6. ሕጻኑ ክሱ የሚሰማበትን ቋንቋ መስማት ወይም መናገር ካልቻለ አስተርጓሚ በነጻ ይመደብለታል ።

7. ጉዳዩ በሚታይበት ጊዜ በየትኛውም ደረጃ ሌላ ሰው ማወቅ የማይገባው የግል ሁኔታ በምስጢር ይጠበቅለታል ።

3. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በወንጀል ለተከሰሱ ወይም የወንጀል ሕግ ተላልፉችኋል ለሚባሉ ሕጻናት ሕግና ሥነ ሥርዓት ያወጣሉ ፣ ባለሥልጣኖችና ተቋሞች ያቋቁማሉ ። በተለይም ፡

   ሀ. ወንጀል ለመፈጸም ችሎታ የለውም የሚባል ሕጻንን ከፍተኛ ዕድሜ ይወስናሉ ።

   ለ. አስፈላጊና ተገቢ ሆኖ ሲገኝ ሰብአዊ መብቶችና የሕግ ከለላዎች እንደተጠበቁ ሆነው ጉዳዩ ፍርድ ቤት ሳይቀርብ ሌሎች እርምጃዎች የሚወሰዱበትን ሁኔታ ይወስናሉ ።

4. ለሕጻናት የሚደረገው አያያዝና ጥበቃ ለደኅንነታቸው አስተማማኝ ፣ ከሚገኙበት ሁኔታና ከተጠየቁበት ወንጀል ጋር ተመጣጣኝ ፣ መሆኑን ለማረጋገጥ በተቋሞች ከሚሰጠው አገልግሎት በአማራጭ የምክር አገልግሎት ፣ አመክሮ ፣ የፎስተር አገልግሎት ፣ የትምህርትና የሥልጠና ፕሮግራምና የመሳሰሉት ልዩ ልዩ አገልግሎቶች ይሰጣቸዋል ።

**አንቀጽ 41**

ለሕጻናት መብቶች ተግባራዊነት የበለጠ አስተዋጽኦ የሚኖራቸው

1. የአባል አገሩ ሕጎች ፣
2. አባል አገሩ ተካፋይ የሆነባቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች በዚህ ኮንቬንሽን የትኛውም አንቀጽ ገደብ አይደረግባቸውም ።





# ክፍል ሁለት

## አንቀጽ 42

አባል አገሮች የዚህን ኮንቬንሽን መርሆዎችና ድንጋጌዎች ለሕጻናትም ሆነ ለአዋቂዎች ተገቢ በሆነ መንገድ በሰፊው ለማስተዋወቅ እርምጃ ይወስዳሉ ።

## አንቀጽ 43

1. በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን የሕጻናት መብቶች ተግባራዊ በማድረግ ረገድ አባል አገሮች የሚገኙበትን ሁኔታ ለመገምገም ከዚህ ቀጥሎ ያለው ተግባር የተሰጠው የሕጻናት መብቶች ኮሚቴ ይቋቋማል ።

2. ኮሚቴው ከፍተኛ ሥነ ምግባርና በኮንቬንሽኑ በተመለከቱት ጉዳዮች ላይ ልዩ ሙያ የአላቸውን አሥር ባለሙያዎች በአባልነት የሚይዝ ይሆናል ። የኮሚቴው አባሎች በዕጩነት ከሚያቀርቧቸው ዜጎቻቸው መካከል በኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ተመርጠው ማንንም ሳይወክሉ በግል ኃላፊነታቸው ያገለግላሉ ። በምርጫው የኮሚቴው አባሎች የጂኦግራፊ ስብጥርና አገሮቻቸው የሚከተሉት የሕግ ፍልስፍና ትኩረት ይሰጠዋል ።

3. የኮሚቴው አባሎች በአባል አገሮች ከቀረቡት ዕጩዎች መካከል በምስጢር ድምጽ አሰጣጥ ይመረጣሉ ። እያንዳንዱ አባል አገር ከዜጎቹ መካከል ለምርጫው አንድ እጩ ማቅረብ ይችላል ።

4. የመጀመሪያው የኮሚቴው አባሎች ምርጫ ይህ ኮንቬንሽን በሥራ ላይ መዋል ከጀመረበት ጊዜ አንስቶ በስድስት ወር ውስጥ ይፈጸማል ። ከዚያ በኋላም ምርጫው በየሁለት ዓመት ይሆናል ። የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ከምርጫው ቢያንስ አራት ወር በፊት አባል አገሮች እጩዎቻቸውን በሁለት ወር ጊዜ ውስጥ እንዲያሳውቁ በደብዳቤ ይጠይቃሉ ። ከዚያ በኋላ ዋና ጸሐፊው የእጩዎቹን ዝርዝር ፣ ከአቀረቡአቸው አባል አገሮች ስም ጋር በፊደል ተራ አዘጋጅተው ለኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ያቀርባሉ ።

5. ምርጫው የሚካሔደው በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና መሥሪያ ቤት የድርጅቱ ዋና ጸሐፊ በሚጠሩት የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ጠቅላላ ስብሰባ ይሆናል ።

   በዚህ ስብሰባ ሁለት ሶስተኛው አባል አገሮች ከተገኙ ምልዐተ ጉባኤ የሚኖር ሆኖ የኮሚቴው አባሎች ሆነው የሚመረጡት ከፍተኛውን ድምጽ የሚያገኙትና በስብሰባው ላይ ከተገኙት አባል አገሮች ከግማሽ በላይ በሚሆኑት የሚደገፉት ይሆናሉ ።

6. የኮሚቴው አባሎች ለአራት ዓመታት የሥራ ጊዜ ይመረጣሉ ። እንደ ገና በዕጩነት ከቀረቡ ለመመረጥ ይችላሉ ። የመጀመሪያዎቹ አምስት የኮሚቴው

አባላት የሥራ ጊዜ የመጀመሪያው ምርጫ ከተደረገ ሁለት ዓመት በኋላ ይፈጸማል ። የእነዚህ ሰዎች ስም የስብሰባው ሊቀ መንበር በሚያወጣው ዕጣ ይለያል ።

7. የኮሚቴው አባል በሞት ወይም በራሱ ፈቃድ ሥራ ቢለቅ ወይም በማንኛውም ሌላ ምክንያት አገልግሎት ለመስጠት ሳይችል ቢቀር በዕጩነት ያቀረበው አባል አገር ከዜጎቹ መካከል በቀሪው ጊዜ የሚያገለግል ሌላ ሰው ይሾማል ። ሆኖም ይህ ተግባራዊ የሚሆነው በኮሚቴው ተቀባይነት ሲያገኝ ነው ።

8. ኮሚቴው የራሱን የሥራ መመሪያዎች ያወጣል ፤

9. ኮሚቴው የራሱን ሹማምንት ለሁለት ዓመታት የሥራ ጊዜ ይመርጣል ።

10. የኮሚቴው ስብሰባ በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና መ/ቤት ወይም ኮሚቴው በሚወስነው ሌላ ተስማሚ ቦታ ይደረጋል ። ኮሚቴው በዓመት አንድ ጊዜ ይሰበሰባል ። የኮሚቴው ስብሰባ የሚፈጀው ጊዜ በዚህ ኮንቬንሽን አባል አገሮች ከተወሰነና እንደአስፈላጊነቱም ከተሻሻለ በኋላ በተባበሩት መንግሥታት ጠቅላላ ጉባኤ ይጸድቃል ።

11. የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ኮሚቴው ተግባሩን በሚገባ ለማከናወን የሚያስችለውን የሰው ኃይልና አስፈላጊ ነገሮች ያሟላል ።

12. የኮሚቴው አባሎች ለሚሰጡት አገልግሎት የሚከፈላቸውን አበል የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ጠቅላላ ጉባኤ ከድርጅቱ ገንዘብ ይወስናል ፤ አገልግሎታቸውም ድርጅቱ በሚወስነው የሥራ ሁኔታ ይሆናል ።

<u>አንቀጽ 44</u>

1. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን የሕጻናት መብቶች በሚመለከት ስለወሰዱቸው እርምጃዎችና ስለተገኘው ውጤት በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ አማካይነት ሪፖርት ያቀርባሉ ።

   ሀ. የመጀመሪያው ሪፖርት ኮንቬንሽኑ ሥራ ላይ መዋል ከጀመረበት ጊዜ አንስቶ እስከ ሁለት ዓመት ፤

   ለ. ከዚያ በኋላ የሚቀርቡ ሪፖርቶች በየአምስት ዓመት ይሆናል ።

2. የሚቀርበው ሪፖርት በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱት የሕጻናት መብቶች እውን እንዳይሆኑ ያጋጠመው ችግሮችንና የተከሰቱ ሁኔታዎችን ያካተተ መሆን አለበት ። ሪፖርቱ በተጨማሪ በተጠቀሰው አገር የሕጻናት መብቶችን በሚመለከት ያለውን ሁኔታ የሚገልጽ በቂ መረጃ መያዝ አለበት ።

3. የመጀመሪያውን ሪፖርት ሰፋ አድርጎ ለኮሚቴው ያቀረበ አባል አገር በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 1 / ለ / መሠረት ሪፖርት ሲያቀርብ ቀደም ሲል ያስተላለፋቸውን መሠረታዊ መረጃዎች ደግሞ ማቅረብ አያስፈልገውም ።

4. ኮሚቴው ከአባል አገሮች ስለሕፃናት መብቶች ተግባራዊነት ተጨማሪ መረጃዎችን ሊጠይቅ ይችላል ።

5. ኮሚቴው ስለሥራው እንቅስቃሴ በየሁለት ዓመት በተባበሩት መንግሥታት የኢኮኖሚና የማኅበራዊ ምክር ቤት አማካይነት ለጠቅላላው ጉባኤ ሪፖርት ያቀርባል ።

6. የኮንቬንሽኑ አባል አገሮች የሚያቀርቧቸውን ሪፖርቶች ለየራሳቸው ሕዝቦች በሰፊው እንዲሰራጩ ያደርጋሉ ።

## አንቀጽ 45

ኮንቬንሽኑ በሚገባ ሥራ ላይ እንዲውል ለማድረግና ኮንቬንሽኑን በሚመለከቱ ጉዳዮች ላይ ዓለም አቀፍ ትብብር እንዲኖር ለማበረታታት ፣

ሀ. የተባበሩት መንግሥታት ባለ ልዩ ሙያ ድርጅቶች ፣ የተባበሩት መንግሥታት የሕጻናት መርጃ ድርጅት እና ሌሎች የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት አካሎች በዚህ ኮንቬንሽን የተመለከቱትን ከየሥራ ኃላፊነታቸው ጋር የተያያዙትን ድንጋጌዎች ተግባራዊ ለማድረግ በሚደረጉ ስብሰባዎች ተወካዮቻቸውን በመላክ የመሳተፍ መብት አላቸው ።

የኮንቬንሽኑን ተግባራዊነት በሚመለከት በየሥራ ኃላፊነታቸው የሙያ አስተያየት እንዲሰጡ ኮሚቴው የተባበሩት መንግሥታት ባለ ልዩ ሙያ ድርጅቶችን ፣ የተባበሩት መንግሥታት የሕፃናት መርጃ ድርጅትን እና ተገቢ የመሰሉትን ሌሎችንም ድርጅቶች መጋበዝ ይችላል ። ኮሚቴው የተባበሩት መንግሥታት ባለ ልዩ ሙያ ድርጅቶች ፣ የተባበሩት መንግሥታት የሕፃናት መርጃ ድርጅትና እና ሌሎች የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት አካሎች የኮንቬንሽኑን ተግባራዊነት በሚመለከት ከየሥራ ኃላፊነታቸው ጋር ግንኙነት በአላቸው ጉዳዮች ላይ ሪፖርት እንዲያቀርቡ ሊጋብዛቸው ይችላል ።

ለ. አባል አገሮች የቴክኒክ ምክር ወይም ዕርዳታ ለመጠየቅ የሚያቀርቡትን ሪፖርት እየተቀበለ ኮሚቴው ከአለው የራሱን አስተያየት አክሎ ለተባበሩት መንግሥታት ባለ ልዩ ሙያ ድርጅቶች ፣ ለተባበሩት መንግሥታት የሕጻናት መርጃ ድርጅት እና ለሌሎች አግባብ ያላቸው ድርጅቶች እንደአስፈላጊነቱ ያስተላልፋል ።

ሐ. ኮሚቴው የሕፃናት መብቶችን በሚመለከቱ ልዩ ልዩ ጉዳዮች ላይ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ጥናቶች እንዲያስጠኑለት ለጠቅላላው ጉባኤ አስተያየት ማቅረብ ይችላል ።

መ. በዚህ ኮንቬንሽን አንቀጽ 44 እና 45 በሚያገኘው መረጃ መሠረት ኮሚቴው አስተያየትና የውሳኔ ሀሳብ መስጠት ይችላል ። በዚህ መሠረት የሚዘጋጀው አስተያየትና የውሳኔ ሀሳብ ለሚመለከተው አባል አገር ሲተላለፍ ከአባል አገሮች የተላከ አስተያየት ከአለ ታክሎበት ለድርጅቱ ጠቅላላ ጉባኤ ሪፖርት መልክ ይቀርባል ።

# ክፍል ሦስት

**አንቀጽ 46**

ይህ ኮንቬንሽን ለሁሉም አገሮች ፊርማ ክፍት ሆኖ ይቀመጣል ።

**አንቀጽ 47**

ኮንቬንሽኑ ተፈፃሚ የሚሆነው በአባል አገሮች ሲጸድቅ ነው ። የማጽደቂያ ሰነዶቹ በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ጽ/ቤት ይቀመጣሉ ።

**አንቀጽ 48**

ማንኛውም አገር ኮንቬንሽኑን መቀበል ይችላል ። የመቀበያ ሰነዶቹም በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ጽ/ቤት ይቀመጣሉ ።

**አንቀጽ 49**

1. ይህ ኮንቬንሽን ሃያኛው የማጽደቂያ ወይም የመቀበያ ሰነድ ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ከቀረበ ጊዜ ጀምሮ በሠላሳኛው ቀን የጸና ይሆናል ።

2. የኮንቬንሽኑ ሃያኛው የማጽደቂያ ወይም የመቀበያ ሰነድ ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ከቀረበ በኋላ የማጽደቂያ ሰነድ ወይም የመቀበያ ሰነድ ለሚያቀርብ እያንዳንዱ አገር ኮንቬንሽኑ የሚጸናው የማጽደቂያ ሰነድ ወይም የመቀበያ ሰነድ ከአቀረበበት ጊዜ ጀምሮ በሠላሳኛው ቀን ይሆናል ።

**አንቀጽ 50**

1. ማንኛውም የኮንቬንሽኑ አባል አገር የማሻሻያ ሃሣብ ሊያቀርብ ይችላል ። የማሻሻያ ሃሣቡንም የሚያቀርበው ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ይሆናል ። የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ የማሻሻያ ሃሣቡ እንደደረሳቸው አባል አገሮች ተሰብስበው በቀረበው የማሻሻያ ሃሣብ ላይ ለመነጋገርና ለመወሰን ይፈልጉ እንደሆነ በመጠየቅ የማሻሻያ ሃሣቡን ይልኩላቸዋል ። ይህ ከሆነ አራት ወራት በኋላ ቢያንስ የአባሎቹ አንድ ሶስተኛ/ሲሶ/መሰብሰቡን ከደገፉ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ በድርጅቱ ስም የስብሰባ ጥሪ ያስተላልፋሉ ። የማሻሻያ ሃሣቡ በስብሰባው ላይ ተገኝተው ድምጽ ከሰጡት አባል አገሮች በብዙሐኑ ድምጽ የተደገፈ ከሆነ እንዲጸድቅ ለጠቅላላው ጉባኤ መቅረብ አለበት ።

2. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ አንድ መሠረት ተቀባይነት ያገኘ የማሻሻያ ሀሣብ

በጠቅላላው ጉባኤ ከጸደቀና ከኮንቬንሽኑ አባል አገሮች ሁለት ሶስተኛው ከደገፉት የጸና ይሆናል ።

3. የማሻሻያ ሃሣቡ ከጸና በኋላ ለደገፉት አባል አገሮች ሕግ ይሆናል ፡ ሌሎች አገሮች ግን የኮንቬንሽኑን ግዴታዎችና ራሳቸው የተቀበሏቸውን የማሻሻያ ሀሣቦች ያከብራሉ ።

## አንቀጽ 51

1. የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ አባል አገሮች ኮንቬንሽኑን ሲያ ጸድቁ ወይም ሲቀበሉ ያስመዘገቧቸውን ቅሬታዎች (RESERVATIONS) ለሌሎች አባል አገሮች ያሳውቃሉ ።

2. ከኮንቬንሽኑ መሠረታዊ ጉዳይና ዓላማ ጋር በሚቃረን አኳኋን የተመዘገበ ቅሬታ ተቀባይነት አይኖረውም ።

3. ያስመዘገቡትን ቅሬታ አባል አገሮች በማንኛውም ጊዜ ትቼዋለሁ ማለት ይች ላሉ ። ይህን ሲያደርጉም ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ማስ ታወቅ አለባቸው ። ዋና ጸሐፊውም ለሁሉም አባል አገሮች ይኸንኑ ያስራ ጫሉ ። ይህንንም የሚያደርጉት ቅሬታውን ትቼዋለሁ የሚለው መልእክት በደረሰበት ዕለት ይሆናል ።

## አንቀጽ 52

የዚህ ኮንቬንሽን አባል የሆነ አገር አባልነቱን ለማቋረጥ ሲወስን ይህንኑ በጽሑፍ ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ያቀርባል ። አባልነ ቱም የሚቀረው ጽሑፉ ለተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ከቀረበበት ጊዜ ጀምሮ አንድ ዓመት በኋላ ይሆናል ።

## አንቀጽ 53

ኮንቬንሽኑ በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ጽ/ቤት ይቀመጣል ።

## አንቀጽ 54

የዚህ ኮንቬንሽን የአረብኛ ፡ የቻይና ፡ የእንግሊዝኛ ፡ የፈረንሳይኛ ፡ የሩሲያና የእስፓኒሽ ጽሑፍ እኩል ተቀባይነት ያላቸው ሲሆን ፡ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ዋና ጸሐፊ ሁሉንም ለአባል አገሮች ፊርማ ያቀርባሉ ።

የመንግሥታት ተወካዮች ከየመንግሥታቸው በተሰጣቸው ሥልጣን መሠረት ይህን ኮንቬንሽን መቀበላቸውን በፊርማቸው አረጋግጠዋል ።

